

# በሥዕል የተደገፈ የዕባዳዎች አፈጻጸም ፍቅህ

## የእስላም ዝርዝር ሕግጋት ትምህርት በቀላል አቀራረብ

| ጠሃራ | ሶላት | ጾም | ዘካ | ሐጅ |
| --- | --- | --- | --- | --- |


ዶክተር ዐብዱላህ ባህማም

ተርጓሚ

ሙሐመድ ጀማል ሙኽታር



ኡድሕይ'ያ

# 10 ኡድሕይ'ያ

**ኡድሕይ'ያ**

በመሰዊያ ቀናት ወደ አላህ ﷻ ለመቃረቢያ ዕባዳ ተብሎ የሚታረድ የቤት እንስሳ ነው፡፡

## ማውጫ



## ኡድሕይ'ያን የሚመለከት ድንጋጌ

ኡድሕይ'ያ የጠበቀ ሱንና ነው፡፡ አላህ ﷻ ፦

﴿ فَصَلِّ لِرَبِّكَ وَٱنۡحَرۡ ﴾ [الكوثر:2]

‹‹ስለዚህ ለጌታህ ስገድ፤(በስሙ) ሠዋም፡፡›› [አል-ከውሠር:2]ብሏልና፡፡ ከአነስ (ረዐ) በተላለፈው መሰረት

‹‹ነቢዩ ﷺ መልካቸው ነጫጭና በጥቂቱ ጥቁር ያለባቸው ሁለት ቀንዳማ በጎችን ለኡድሕይ'ያ ሠውተዋል፤ሁለቱንም ብስምልላህ ወል'ሏሁ አክበር ብለው በእጃቸው ያረዱ ሲሆን እግራቸውን በበጎቹ አንገቶች አካባቢ ላይ አድርገው ነበር፡፡››[1] ብለዋል፡፡

## ኡድሕይ'ያ የሚታረድበት ጊዜ

የማረጃ ጊዜው በመሠዊያው ቀን ከዒድ ሶላት በኋላ ጀምሮ እስከ አይ'ያም አት'ተሽሪቅ (የወርሐ ዙልሕጃ አስራ አንደኛው፣አስራ ሁለተኛውና አስራ ሦስተኛው ቀናት) የመጨረሻው ቀን ጸሐይ መጥለቅ ድረስ ነው፡፡

(1) በትርምዚ የተዘገበ

## ለኡድሕይ'ያ ብቁ የሆነ እንስሳ

1. አንድ በግ ለአንድ ግለሰብ በቂ ሲሆን የፈለገውን ሰው በአጅሩ ተካፋይ ማድረግ ይችላል፡፡ የአላህ መልእክተኛ ﷺ ኡድሕያቸውን ለማረድ ሲፈልጉ ‹‹ብስምል'ላህ፣አላህ ሆይ! (ይህን) ከሙሐመድ፣ከሙሐመድ ቤተሰብና ከሙሐመድ ኡመት (ሕዝቦች) ተቀበል፡፡››[2] ብለዋል፡፡

2. አንዱ ግመል እና ወይፈን ለሰባት ሰዎች ብቁ ኡድሕይ'ያ ነው፡፡ ሰባት ሰዎች በአንድ ግመል

(2) በቡኻሪና ሙስሊም የተዘገበ





ወይም ወይፈን በጋራ መሳተፍ ይፈቀዳል፡፡ ከጃቢር (ረዐ) በተላለፈው መሰረት ‹‹የአላህ መልእክተኛ ﷺ በግመልና በበሬ በየሰባታችን በአንድ ግመል እንድንሻረክ አዘውናል፡፡››[1] ብለዋል፡፡

## ለኡድሕይያ ብቁ የሆነ የእንስሳ ዕድሜ

- ከበግ የስድስት ወርና ከዚያ በላይ ዕድሜ ያለው፡፡
- ከፍየል ያንድ ዓመት ዕድሜ ያለው፡፡
- ወይፈን ሁለት ዓመት የሞላው፡፡
- ከግመል አምስት ዓመት የሞላው፡፡

## ከሁሉም በላጬ ኡድሕይ’ያ

ከሁሉም በላጬ ኡድሕይ›ያ ሙሉ በሙሉ ከሆነ በዋጋውም የበለጠ ውድና ለድኾችም ይበልጥ ጠቃሚ በመሆኑ ግመል ነው፡፡ ቀጥሎ ሙሉ በሙሉ ያለ ማሻረክ ከተሰዋ ኮርማ በሬ ነው፡፡ ከዚያ በግ፣ከዚያ ቀጥሎ ግመል ለሰባት፣ቀጥሎም በሬ ለሰባት ነው፡፡

## የኡድሕይ›ያ እንስሳ እንከኖች

### 1. ብቁነትን የሚከለክሉ ጉድለቶች

ሸውራራ: በዓይኑ ላይ መንሸዋረር ያለበት ሲሆን ዓይኑ የታወረም በዚህ ውስጥ ይካተታል፡፡

አንካሳ: መራመድና መጓዝ የማይችል ነው፡፡

ከሲታ: በጣም የከሳና ምንም መቅኒ (ስብ) የሌለው፡

በሽተኛነቱ በግልጽ የሚታይ

ለዚህ ማስረጃው ከበራእ ብን ዓዝብ (ረዐ) በተላለፈው መሰረት የአላህ መልእክተኛ ﷺ ‹‹ሸውራራነቱ የጎላ ሸውራራ፣አንካሳነቱ የጎላ አንካሳ፣በሽተኛነቱ የጎላ በሽተኛና ምንም መቅኒ የሌለበት ከሲታ እንስሳ ለኡድሕያ አይፈቀድም፡፡››[2] ብለዋል ማለታቸው ነው፡፡ ከነዚህ እንከኖችና ጉድለቶች ጋር ተመሳሳይነት ያላቸውና ከነዚህም የከፉ ጉድለቶች በዚህ ውስጥ ይደመራሉ፡፡

(1) በሙስሊም የተዘገበ
(2) በሙስሊም የተዘገበ

## 2. ከብቁነት የማያግዱ እንከኖች

**ጅራተ ቆራጣ:** ጅራት ወይም ላት የሌለው።

**ቀንድ አልባ:** ምንም ዓነት ቀንድ የልተፈጠረበት።

**ቅጥቅጥ:** የተቀጠቀጠ በግ።

ጆሮው የተቀደደ ወይም የተበሳ ወይም ቀንዱ የተሰበረ።

ብቁነትን አስመልክቶ ለኡድሕይያ የተባለው ሁሉ ለቤዛና ለሀድይም የሚሠራ ነው።

## የኡድሕይያ ክፍፍል

ከኡድሕይ ሥጋ ውስጥ አንድ ሦስተኛውን ባለቤቱ ራሱ መብላት፣አንድ ሦስተኛውን በስጦታ መስጠትና አንድ ሦስተኛውን ምጽዋት መስጠት የተደነገገ ነው። ሁሉንም በሶደቃ መስጠት የተፈቀደ ሲሆን አብዛኛውን ለራሱ ቢበላም የተፈቀደ ነው።

## ጠቃሚ ነጥብ

ኡድሕይያ የማረድ ሃሳብ ያለው ሰው የዙልሕጃ ወር ከገባ በኋላ እስኪያርደው ድረስ ከጸጉሩ፣ከጥፍሩና ከገላው ምንም ነገር መውሰድ አይፈቀድም። ከኡምሙ ሰለማ (ረዐ) በተላለፈው መሰረት ነቢዩ صلى الله عليه وسلم ‹‹(ከዙልሕጃ የመጀመሪያዎቹ አስር ቀናት ከጀመረና አንዳችሁ ኡድሕይያ ማረድ ካሰበ ከጸጉሩና ከገላው ምንም ነገር አይንካ።››[1] ብለዋል። እንደ ባለቤትና ልጆች ያሉ ስለነሱ ኡድሕይያው የሚታረድላቸው ግን እገዳው አይመለከታቸውም።



(1) በሙስሊም የተዘገበ

